

# በሥዕል የተደገፈ የዕባዳዎች አፈጻጸም ፍቅህ

## የእስላም ዝርዝር ሕግጋት ትምህርት በቀላል አቀራረብ

ጦሃራ | ሶላት | ጾም | ዘካ | ሐጅ


ዶክተር ዐብዱላህ ባህማም

ተርጓሚ

ሙሐመድ ጀማል ሙኽታር



እዕትካፍ

# 6 እዕትካፍ

### የእዕትካፍ የቋንቋ ትርጉም

አንድን ነገር የሙጥኝ መያዝና ራስን በዚያ ነገር ላይ አስሮ ማቆየት ነው፡፡

### የእዕትካፍ ሸሪዓዊ ትርጉም

ለአላህ ዕባዳ ብሎ በመስጊድ መቆየት ነው፡፡

## መ ው ጫ



## እዕትካፍ የተደነገገ መሆኑ

እዕትካፍ ከትሩፋት ሥራዎችና ለአላህ ተገዥ ከመሆን መገለጫዎች አንዱ ነው፡፡ ከዓእሻ (ረዐ) በተላለፈው መሰረት ‹‹ነቢዩ ﷺ እስከ ሕልፈተ ሕይታቸው ድረስ ከረመዷን የመጨረሻዎቹን አስር ቀናት እዕትካፍ ያደርጉ ነበር፡፡››[1] ብለዋል፡፡

አላህ عَزَّ وَجَلَّ እዕትካፍን ለኛና ከኛ በፊት ለነበሩትም የደነገገ ሲሆን እንዲህ ብሏል፡

﴿وَعَهِدْنَآ إِلَىٰٓ إِبْرَٰهِـۧمَ وَإِسْمَٰعِيلَ أَن طَهِّرَا بَيْتِىَ لِلطَّآئِفِينَ وَٱلْعَٰكِفِينَ وَٱلرُّكَّعِ ٱلسُّجُودِ ١٢٥﴾ [البقرة:125].

‹‹ወደ ኢብራሂምና ኢስማዒልም ቤቴን ለዘዋሪዎቹና ለተቀማጮቹም ለአጎንባሾች ሰጋጆቹም አጥሩ ስንል ቃል ኪዳን ያዝን፡፡›› [አል-በቀራህ:125]

## እዕትካፍን የሚመለከት ብያኔ

እዕትካፍ በሁሉም ጊዜ ሱንና ሲሆን፣የአላህ መልእክተኛ ﷺ በመጨረሻዎቹ የረመዷን አስር ቀናት ያዘወተሩት[2] በመሆኑ በላጩ በመጨረሻዎቹ የረመዷን አስር ቀናት የሚደረገው ነው፡፡

(1) በቡኻሪ የተዘገበ
(2) ዛድ አልመዓድ

## ለእዕትካፍ መሟላት ያለባቸው ሸርጦች

### 1. ንይ'ያ

እዕትካፍ የሚያደርግ ሰው ለአላህ ዕባዳና ለርሱ ተገዥ ለመሆን ዓለማ መስጊድ ተቀምጦ ለመቆየት ኒይያ ያደርጋል፡፡ ነቢዩ ﷺ ‹‹ሥራዎች (የሚለኩት ከጀርባቸው ባለው ቁርጠኛ) ውሳኔ ነው፤እያንዳንዱ ሰውም በንይ'ያው መሰረት ነው የሚያገኘው፡፡››[3] ብለዋልና፡፡

### 2. እዕትካፍ የሚደረግበት መስጊድ ጀማዓ የሚሰገድበት መሆን

እዕትካፍ በመስጊድ እንጂ በሌላ ቦታ አይደረግም፡፡ አላህ عَزَّ وَجَلَّ :-

﴿وَلَا تُبَٰشِرُوهُنَّ وَأَنتُمْ عَٰكِفُونَ فِى ٱلْمَسَٰجِدِ﴾ [البقرة:187]

‹‹እላንተም በመስጊዶች ውስጥ ተቀማጮች ስትኾኑ አትገናኙዋቸው፤››[አል-በቀራህ:187] ብሏልና፡

(3) በቡኻሪና ሙስሊም የተዘገበ

: የነቢዩ ﷺ ተግባርም ይህንኑ ያረጋግጣል:: ጀማዓ በማይሰገድበት መስጊድ እዕትካፍ ማድረግ ዋጅብ የሆነውን ሶላቱል ጀማዓ መተውን፣ወይም የሙዕተክፉን ደጋግሞ ከመስጊድ መውጣት የሚያስከትል ሲሆን ይህ ደግሞ ከዓላማው ጋር የሚጻረር ይሆናል:: ሴት ግን ጀማዓ በሚሰገድበትም ሆነ በማይሰገድበት መስጊድ እዕትካፍ ማድረግ ትችላለች:: ይህም እዕትካፍ በማድረጓ ችግር (ፍትና) የማይከሰት ከሆነ ሲሆን የሚከሰት ከሆነ ትከለከላለች:: ተመራጩ እዕትካፍ የሚደረግበት መስጊድ ጁሙዓ የሚሰገድበት መሆኑ ነው:: ሆኖም ግን የእዕትካፍ ቅድመ ሁኔታ አይደለም::


ጃሚዕ (ዐቢይ) መስጊድ

## 3. ከከፍተኛው ሐደሥ ንጹሕ መሆን

ጀናባ ያለበት ሰው፣የወር አበባና የወሊድ ደም ያለባት ሴትም፣ለነኚህ በሙሉ መስጊድ ውስጥ መቀቀየት የማይፈቀድላቸው በመሆኑ እዕትካፍ ማድረግ አይችሉም::



## ጾም ለእዕትካፍ ሸርጥ አይደለም

መጾም እዕትካፍ ለማድረግ ቅድመ ሁኔታ ተደርጎ አይወሰድም:: ከእብን ዑመር (ረዐ) በተላለፈው መሰረት ዑመር ለነቢዩ  :- ‹‹በዘመነ ጃህሊያ በተከበረው (የመካ) መስጊድ አንድ ሌሊት እዕትካፍ ለማድረግ ስለት አድርጌ ነበር ብለው ሲጠይቁ ‹‹ስለትህን አሟላ››[1] ብለዋል:: መጾም ሸርጥ ቢሆን ኖሮ በሌሊት እዕትካፍ ማድረጋቸው ትክክለኛ ባልሆነ ነበር፣ሌሊት አይጾምምና:: በተጨማሪም የአላህ መልእክተኛ ﷺ በሸዋል[2] የመጀመሪያዎቹ አስር ቀናት እዕትካፍ ማድረጋቸው የተረጋገጠ ሲሆን መጾም የማይፈቀድበት የዒድ ቀን ያለበት ወቅት ከመሆኑም ባሻገር ጾምና እዕትካፍ ራሳቸውን የቻሉ የተለያዩ ዕባዳዎች በመሆናቸው ለአንዱ መኖር የሌላው መኖር ሸርጥ አይደለም::

(1) በቡኻሪ የተዘገበ
(2) በሙስሊም የተዘገበ



## የእዕትካፍ ጊዜ

እዕትካፍ በየትኛውም ቀንና ለማንኛውም የቆይታ ጊዜ ሊደረግ ይችላል፡፡ ሆኖም  የቆይታ ጊዜው ከአንድ ቀንና አንድ ሌሊት ባያንስ ተመራጭ ነው፡፡ ምክንቱም ነቢዩም ﷺ ሆኑ ከሶሓባቸው መካከል ከዚህ ላነሰ ጊዜ እዕትካፍ ያደረገ ሰው ስለመኖሩ  የተዘገበ ነገር የሌለ በመሆኑ ነው፡፡

## የመጨረሻዎቹ የረመዷን አስር ቀናት እዕትካፍ

ይህ ከሁሉም በላጩ የእዕትካፍ ወቅት ነው፡፡ ከዓእሻ (ረዐ) በተላለፈው መሰረት ‹‹ነቢዩ ﷺ እስከ ሕልፈተ ሕይታቸው ድረስ ከረመዷን የመጨረሻዎቹን አስር ቀናት እዕትካፍ ያደርጉ ነበር፡፡››[1] ብለዋልና፡፡

የመጨረሻዎቹ የረመዷን አስር ቀናት እዕትካፍ ለማድረግ ንይያ ያደረገ ሰው፣በሃያ አንደኛው ቀን ማለዳ የሱብሕ ሶላትን እዕትካፍ ማድረግ በፈለገበት መስጊድ ሰግዶ እዕትካፉን ይጀምራል፡፡ ከዓእሻ (ረዐ) በተላለፈው መሰረት ‹‹የአላህ መልእክተኛ ﷺ በየረመዷኑ እዕትካፍ ያደርጉ የነበረ ሲሆን፣ፈጅር ከሰገዱ በኋላ እዕትካፍ ወደሚያደርጉበት ቦታ ይገባሉ፡፡››[2]ብለዋል፡፡

የረመዷን የመጨረሻው ቀን ጸሐይ ስትጠልቅ እዕትካፉ ያበቃል፡፡ በላጩ የዒድ ዕለት ማለዳ መውጣት ሲሆን፣ከብዙ ሰለፎች የተረጋጠውም ይኸው ነው፡፡

(1) በቡኻሪ የተዘገበ
(2) በቡኻሪ የተዘገበ

ከረመዷን 21 ቀን ጎህ መቅደድ ጀምሮ




እስከ ረመዷን የመጨረሻው ቀን ጸሐይ መጥለቅ ድረስ



## ከእዕትካፍ በስተጀርባ ያለው ጥበብ

ከእዕትካፍ በስተጀርባ ያለው ጥበብ ከዓለማዊ ሕወት ጋር መቆራረጥ፣በዱንያና በሰዎቿ ጉዳይ ከመጠመድ ከነሱ ርቆ ራስን ሙሉ ለሙሉ ለአላህ ዕባዳ ነጻ ማድረግ ነው። በመሆኑም እዕትካፍ አድራጊው አካሉን ነጻ አንዳደረገውና እንዳራቀው ሁሉ ልቡንም ነጻ ማድረግና ማራቅ ይገባዋል።

## እዕትካፍ ለሚያደርግ ሰው የሚፈቀዱ ነገሮች

1. የሚያመጣለት ሰው ከሌለው ለመብላትና ለመጠጣት፣ ለመጸዳዳትና ለመሳሰለው የግድ አስፈላጊ ሆኖ ለተገኘ ጉዳይ ከመስጊድ መውጣት። ከዓእሻ (ረዐ) በተላለፈው መሰረት ‹‹ነቢዩ صلى الله عليه وسلم እዕትካፍ በሚያደርጉበት ጊዜ ራሳቸውን ወደኔ ያቀርቡና ጸጉራቸውን አበጥርላቸው ነበር። ለሰው ጉዳይ ካልሆነ በስተቀር ወደ ቤት አይገቡም ነበር።››[1]ብለዋል።
2. ከላይ በሰፈረው ሐዲስ መሰረት ጸጉር መልቀቅና ማበጠር።
3. ጠቃሚ በሆነ ጉዳይ ከሰዎች ጋር መነጋገር፣ስለነሱ መጠየቅ። የእዕትካፍን መንፈስ ስለሚጻረር ማብዛቱ ግን ተገቢ አይደለም።
4. አንዳንድ ቤተሰቡንና ዘመዶቹን መጎብኘት፣እነሱን ለመሸኘት መውጣት። ከሰፊያ ብንት ሑየይዪ (ረዐ) በተላለፈው መሰረት ‹‹ነቢዩ صلى الله عليه وسلم እዕትካፍ ያደርጉ በነበረበት ጊዜ ሌሊት ልጎበኛቸውና ላናግራቸው መጣሁ፤ ከዚያም ለመመለስ ስነሳ ወደ ቤት ሊመልሱኝ አብረውኝ ተነሱ።››[2]ብለዋል።

(1) በሙስሊም የተዘገበ

## እዕትካፍን የሚያበላሹ ነገሮች

1. ሆን ብሎ ያለ ጉዳይ ከመስጊድ ለትንሽ ጊዜም ቢሆን መውጣት። ከዓእሻ (ረዐ) በተላለፈው መሰረት ‹‹‹ነቢዩ صلى الله عليه وسلم ለሰው ጉዳይ ካልሆነ በስተቀር ወደ ቤት አይገቡም ነበር።››105 ብለዋል። ከመስጊድ መውጣት የእዕትካፍ ማእዘን የሆነውን መስጊድ ውስጥ ረግቶ መቀመጥን

(2) በቡኻሪና ሙስሊም የተዘገበ

የሚያሳጣ በመሆኑ ነው፡፡

2. በሌሊት እንኳ ቢሆን ወሲባዊ ተራክቦ መፈጸም፡፡ አላህ ﷻ ፡-

﴿وَلَا تُبَٰشِرُوهُنَّ وَأَنتُمۡ عَٰكِفُونَ فِي ٱلۡمَسَٰجِدِۗ﴾ [البقرة:187]

‹‹እላንተም በመስጊዶች ውስጥ ተቀማጮች ስትኾኑ አትገናኙዋቸው፤›› [አል-በቀራ፡187]

ብሏልና፡፡ ያለ ወሲብ ብልትን መነካካትና ከሚስት ጋር ከብልቷ ውጭ መተሻሸትን በመሳሰሉ ነገሮች ስሜት በሚሰጥ ሁኔታ የአባለዘር ፈሳሽ ከብልት መደፈቅ፡፡

3. እዕትካፉን ለማቋረጥ ቁርጠኛ ሀሳብ ማድረግ፡፡

አንድ ሙስሊም የተወሰኑ ቀናት እዕትካፍ ለማድረግ ንይያ ካደረገ በኋላ እዕትካፉን ቢያቋርጥ ሌላ ጊዜ በመተካት መክፈል (ቀዷእ) ይፈቀድለታል፡፡ ከዓእሻ (ረዐ) በተላለፈው መሰረት ‹‹የአላህ መልእክተኛ ﷺ እዕትካፍ ማድረግ ሲፈልጉ ፈጅር ከሰገዱ በኋላ እዕትካፍ ወደሚያደርጉበት ቦታ ይገቡ ነበር፡፡ መጋረጃቸው እንዲተከል አዘዙና ተተከለ፤- በመጨረሻዎቹ የረመዷን አስር ቀናት እዕትካፍ ማድረግ ፈልገው - ዘይነብም አዘዙና ቆመላቸው፤ሌሎች የነቢዩ ﷺ ሚስቶችም መጋረጃዎቻቸው እንዲተከሉ አዘዙና ተተከለ፡፡ የአላህ መልእክተኛ ﷺ ሱብሕ ሶላት ሲሰግዱ መጋረጃዎቹን አዩና በጎ ተግባር ነው የምትሹት ማለት ነው?[1] ብለው የሳቸው መጋረጃ እንዲፈርስ አዘዙና በረመዷን ወር እዕትካፉን ትተው በሸዋል የመጀመሪዎቹ አስር ቀናት እዕትካፍ አደረጉ፡፡››[2] ብለዋል፡፡ በሌላ ዘገባ ‹‹በሸዋል የመጨረሻዎቹ አስር ቀናት፡፡››[3] የሚል ተመልክቷል፡፡

4. እዐትካፍ ላይ ያለ ሰው የታመመ ሰው አይጠይቅም፤ የቀብር ስነ ሥርዓት ላይ አይገኝም፤አላህን ለመገዛት ብቻ ራሱን ነጻ አድርጎ በእዕትካፍ ማድረጊያው ውስጥ መወሰን ይኖርበታል፡፡



(1) በሙስሊም የተዘገበ

(2) የነቢዩ ﷺ አባባል ባለቤቶቻቸው በዚህ አድራጎት ለአላህ ፍጹም ስለመሆናቸው ስጋት እንዳላቸው ያመለክታል፡፡

(3) በቡኻሪና ሙስሊም የተዘገበ